ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘመኑ ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ ከኃጢ
አት ፡ ትነጻለች ። በሱባዔ ፡ የሰንበታትንም ፡
ሥርዓት ፡ እነሆ ÷ ጻፍሁልህ ። የሥርዓቱንም ፡
ፍርድ ፡ ጻፍሁልህ ። በስድስቱ ፡ ቀኖች ፡ ሥራ
ህን ፡ ሥራ ።
፲፪ ሰባተኛይቱ ፡ ቀን ፡ ግን ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ከመፍጠር ፡ ያረፈበት ፡ ቀን ፡ ናትና ፡
እናንተ ÷ ልጆቻችሁም ÷ ሴቶች ፡ በረያዎቻች
ሁና ፡ ወንዶች ፡ በረያዎቻችሁም ÷ ከብቶቻች
ሁም ፡ ሁሉ ÷ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ የሚኖር ፡ መጻ
ተኛም ፡ ቢሆን ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩ
በት ። በዚያች ፡ ቀን ፡ ምንምን ፡ ሥራን ፡ የሚ
ሠራበት ፡ ሰው ፡ ይሙት ። ይህችን ፡ ቀን ፡ የሚ
ሽራት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከሚስቱም ፡ ጋር ፡ የሚገ
ናኝበትም ፡ ሰው ÷ ገሥግሦ ፡ ሄዶ ፡ ሥራን ፡
ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ነገርን ፡ የሚነጋገርበት ፡ ሰው ፡
ሞትን ፡ ይሙት ።
፲፫ የሚሸጥበት ፡ የሚለውጥበትም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ÷
ውኃንም ፡ የሚቀዳ ፡ ሰው ፡ በስድስተኛይቱ ፡
ቀን ፡ ያላዘጋጀ ፤ ከድንኳኑ ÷ ከቤቱም ፡ ያወጣ ፡
ዘንድ ፡ የሚሸከመውን ፡ ሸክም ፡ ሁሉ ፡ የሚያ
ነሣ ፡ ሰው ፡ ይሙት ።
፲፬ በስድስተኛው ፡ ቀን ፡ ያዘጋጃችሁትን ፡ በልታ
ችሁ ፡ ጠጥታችሁ ፡ ለማክበር ፡ በዚህች ፡ ቀን ፡
ከሥራው ፡ ሁሉ ፡ ዕረፉበት ፡ እንጂ ÷ በዓል ፡
የምታደርጉባትን ፡ ቀን ፡ የሰጣችሁ ፡ አምላካች
ሁን ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አመስግኑበት ፡ እንጂ ፡
በሰባተኛይቱ ፡ ቀን ፡ ምንም ፡ ምን ፡ ሥራን ፡ አት
ሥሩ ። የከበረች ፡ ቀን ፡ ናት ÷ የመንግሥትም ፡
ቀን ፡ ናት ፤ በዘመናቸው ፡ በቀኑ ፡ ሁሉ ፡ ይህች ፡
ቀን ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ የተቀደሰች ፡ ቀን ፡
ናት ።
፲፭ በዚህች ፡ የበዓል ፡ ቀን ፡ በልተው ፡ ጠጥተው ፡
ሊጠግቡባት ÷ በየቀኑ ፡ በየሱባዔው ፡ ዕጣንን ፡
ከማጠን ÷ ቍርባንን ፡ ከማቅረብ ÷ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ መሥዋዕትን ፡ ከመሠዋት ፡ በቀር ፡
ሰው ፡ ከሚሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ሊያርፉበት ፡
እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ የሰጠው ፡ ታላቅ ፡
ክብር ፡ ናትና ፡ አክብሩአት ።
አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚመሰገንበት ፡ ፲፮
በደብተራ ፡ አሪት ፡ ቅዳሚ ፡ ቅዳሚ ፡ ይህ ፡ ሥራ ፡
ብቻ ፡ ይሠራ ። የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ኃጢአት ፡
ያስተሰርዩ ፡ ዘንድ ÷ እግዚአብሔር ፡ ወድዶ ፡
ሊቀበለው ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ መታሰቢያ ፡ ሊሆን ፡
መባን ፡ ያቅርቡ ። እንደ ፡ ታዘዘው ፡ ለዘላለሙ ፡
ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይቀበላቸዋል ።
ሥራን ፡ የሚሠራበት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ÷ መንገድ ፲፯
ንም ፡ የሚሄድበት ፡ ሰው ÷ የሚያርስበት ፡ የሚ
ቆፍርበትም ፡ ሰው ÷ በቤቱም ፡ ቢሆን ፡ በቦታ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ቢሆን ፡ መንጠር ፡ የሚያቃጥል
በትም ፡ ሰው ÷ አህያና ፡ በቅሎ ፡ የሚጭንበት ፡
ሰው ÷ በፈረስና ፡ በበቅሎ ፡ ተቀምጦ ፡ የሚሄ
ድም ፡ ሰው ÷ በመርከብም ፡ ተጭኖ ፡ ወደ ፡
ባሕር ፡ የሚሄድ ፡ ሰው ÷
ማናቸውንም ፡ መትቶ ፡ የሚገድል ፡ ሰው ፡ ሁሉ ÷ ፲፰
ወፍንና ፡ እንስሳንም ፡ አድኖ ፡ የሚያርድበት ፡
ሰው ÷ አውሬም ፡ ቢሆን ፡ ወፍም ፡ ቢሆን ፡
ዓሣም ፡ ቢሆን ፡ አጥምዶ ፡ የያዘበት ፡ ሰው ÷
የሚጾምበትም ፡ ሰው ÷ ቅዳሚ ፡ ቀን ፡ ጠብን ፡
የሚያነሣ ፡ ሰው ÷ ቅዳሚ ፡ ቀን ፡ ከዚህ ፡ ሥር
ዓት ፡ ወጥቶ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ሥራ ፡ የሚሠራ ፡
ሰው ፡ ይሙት ።
የበዓሉን ፡ የቀኑን ፡ ሥርዓት ፡ በየዘመኑ ፡ አከፋ ፲፱
ፍል ፡ እጽፍልህ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጄ ፡
በሰጠኝ ፡ በሰማይ ፡ ጽላት ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ÷
ምድር ፡ ዕረፍት ፡ እንደምታደርግበት ፡ ሥር
ዓት ÷ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በዓልን ፡ የሚያደ
ርጉ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሥራን ፡ የሚሠራበት ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ይሙት ።
በኩፋሌ ፡ የተጻፈው ፡ ነገር ፡ በዚህ ፡ ተፈጸመ ።
ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ይግባው ፡ ለዘላ
ለሙ ፡ አሜን ።